**አዲስ የተሻለ ማንነት፣ ህይወት እና የላቀ አለም የመገንባት ጉዞዬን ተቀላቀሉኝ።**

ኤጳጉሜን



ጥያቄ፣ ትችት እና አስተያየት መቀበያ ቴሌግራም ቦት

**@epagumen9_bot | @epagumen_bot**

2016 አ.ም

መታሰቢያነቱ

**ለፈጣሪ እና ለራሳቸው ታምነው ለኖሩ እና ለሚኖሩ ወንዶች**

ምስጋና

**ለፈጣሪ**

# መልዕክት

መዳዝ የመረጥኩት መንገድ ለአብዛኛው ወንድ የማይሆን እና ተስማሚ እንዳልሆነ አውቃለሁ። ይህ መፀሀፍ ለጥቂት የወንድ ዘሮች የሚያገለግል ነው። ሁሉም ወንድ ንጉስ መሆን ወይም ታላቅ ስኬትን መርገጥ አይችልም። ነገር ግን በውስጥህ አቅም እንዳለህ እና ልዩ እንደሆንክ የሚነግርህ ሀይል ካለ እንዲሁም ፈጣሪ ለሰጠህ አላማ መስዕዋትነት የከፈልክ እና  እየጣርክ ከሆነ ጉዞዬን ልትቀላቀለኝ ትችላለህ። ፍፁም ቃል የፈጣሪ ቃል ብቻ ነው። ካንተ ጋር የማይሄድ አመለካከት ካጋጠመህ የሚበጅህን ብቻ ቅሰም።

መልካም ንባብ



## መግቢያ

የመፀሀፉ አለማ የራስን ሀሳብ ስለመያዝ እና በግል ፍላጎት እና ምርጫ መኖርን የሚያበረታታ እና የሚያጎላ ነው። እራሱን፣ ፈጣሪውን እና አላማውን ጠንቅቆ የሚያውቅ ወንድ አደገኛ ነው። እንዴት ካላችሁ በአካል ቢሞትም እንኳን በሀሳብ ይኖራልና። እንደዚህ አይነቱን ወንድ በሀሳብ ማሰርና መግታት ከባድ ነው። ስለዚህ ወንድ በመሆን ለራስህ ሀሳብ ቁም።

ማንም ባይጓዘውም እንኳን በራሱ ባመነው መንገድ የሚጓዝ በእውነቱ ወንድ ነው። ለአለም ሳይሆን ለውስጣዊ ፈጣሪ የሚገዛ በእውነቱ ወንድ ነው። ሰውን ሳይሆን ፈጣሪውን ለማስደሰት የሚጥር በእውነቱ ወንድ ነው። ከራሱ አቅም በላይ በፈጣሪው ሀይል የሚመካ በእውነቱ ወንድ ነው። ከገንዘብ፣ ከስልጣን እና ከሴት ልጅ ፈጣሪውን የሚያስቀድም በእውነቱ ወንድ ነው። የሰውን ልጅ ሳይሆን ፈጣሪውን ለመምሰል የሚጥር በእውነቱ ወንድ ነው።



ታዲያ ወንድ ነህ?

# ማውጫ

# 1. አላማህን እወቅ አላማህን አስቀድም

መቼም ቢሆን ሴትን ልጅ ከፈጣሪ፣ ከአላማህ እና ከራስህ አታስቀድም።

አላማህን መረዳት እንደ ውስጣዊ ኮምፓስ ተግባርህን እና ምርጫህን የሚመራ ነው። ከዓላማህ ጋር ስትጣጣም የግል እና ሙያዊ እድገትህን ሊመራ የሚችል የስኬት እና የመነሳሳት ስሜት ታገኛለህ። ዓላማ የሕይወትን ውሳኔዎች ለመምራት፣ ግቦችን ለመቅረጽ፣ በባህሪ ላይ ተጽዕኖ ለማሳደር፣ ትርጉም ለመፍጠር እና የሕይወት አቅጣጫን ለመስጠት ይረዳል።

ለአንዳንድ ሰዎች የራሳቸው ዓላማ ከሥራቸው ጋር የተገናኘ ሲሆን ትርጉም ያለውና የሚያረካ ሥራ ሲሠሩ ግልጽ ዓላማ ይሰማቸዋል። ለሌሎች የሕይወታቸው ዓላማ የሚወዷቸውን፣ ቤተሰባቸውን ወይም ጓደኞቻቸውን ሲንከባከቡ የሚያገኙ ሲሆን ሌሎች ሰዎች ዓላማቸውን በሃይማኖታዊ እምነቶች እና መንፈሳዊነት ይፈልጋሉ። እንዲያውም አንዳንድ ሰዎች ዓላማቸውን በተለያዩ የሕይወታቸው ዘርፎች ያገኙታል።

ይህ ዓላማ ለእያንዳንዱ ግለሰብ የተለየ መሆኑን ያሳያል። ለወንዶች ዓላማቸውን ማግኘታቸው ሕይወታቸው የበለጠ ትርጉም ያለው እንዲሆን ያደርጋል። የሕይወታችሁን ዓላማ መፈለግ በሕይወትዎ ውስጥ መንገድዎን ለመምራት ይረዳል።

አንዳንድ ጊዜ ሰዎች አላማቸውን ለማስፈጸም ያመነታሉ ምክንያቱም እራስ ወዳድነት ወይም የግል ጥቅም እንደሆነ ስለሚሰማቸው ነው። በተቃራኒው ግን ወንድ ልጅ የህይወቱን አላማ ማግኘት ጉልበቱን፣ ጊዜውን፣ ስሜቱን እና ገንዘቡን ሴት ልጅ ላይ ከማፍሰስ፣ ስለሷ ከማሰብ እና እሷን ከማሳደድ ይልቅ በውስጣዊ ፈጣሪው እና በስጦታው ላይ ሁሉ ነገሩን በማፍሰስ እራሱን፣ ህይወቱን በመገንባት ለአለም ትርጉም ያለው አስተዋፅኦ ለማድረግ መጠቀም ይኖርበታል።

የእኔ አላማዬ ሁልጊዜ የተሻለ በመሆን፣ የላቀ ህይወት እና አለም በመፍጠር ፈጣሪን ማገልገል ነው። ቅድሚያ ፈጣሪ ከዛም የተሰጠኝ ምክንያት ከዚያ እኔ ሲቀጥል ሴት ልጅ ልትገባ ትችላለች። ፈጣሪ እኔን ሲፈጥር እሱን አገልጋይ እንድሆን አድርጎ የሰራኝ ሲሆን ሴት ልጅን ደግሞ ከኔ ሲፈጥር ለኔ አገልጋይ እንድቶን አድርጎ ነው። አላማውን እና ፈጣሪውን የማያውቅ ወንድ ለሴት ልጅ ፍቅር ባርያ ይሆናል። ፈጣሪውን እና ራዕዩን የማያስቀድም ወንድ ልጅ ሁሌም መከራ ይበላል። አዳምን ሄዋን አሳስታዋለችና ተቀየር ስላለችህ ፈጣሪ እንድቶን የሚፈልገውን ማንነት እና እንድትኖርበት የሰጠህን አላማ የምትጥል ከሆነ እንደ አዳም አለማዊ እንዲሁም ሟች ትሆናለህ። ፈጣሪን ሁል ጊዜ የምታስቀድም ከእሱ ፍቅር፣ ተቀባይነት፣ ደስታ፣ እርካታ፣ ሰላም እና ወዘተ ለማግኘት የምትጥር ከሆነ ዘላለማዊ ትሆናለህ ባይ ነኝ።

ዛሬ ቢራቢሮዎን ካሳደድክ ወደ ሌላ ቦታ ልትበር፣ ላትይዛት እንዲሁም ከራስህም ሆነ ከፈጣሪህ ሳቶን ልትቀር ትችላለህ ነገር ግን ከብዙ አመታት ስራ እና መሰዋዕትነት በኋላ ውብ የአበባ ስፍራ በውስጥህም ሆነ በውጪህ መፍጠር ከቻልክ እሷም ትመጣለች እንዲሁም ብዙ ምርጫ ይኖርሀል።

# 2. ዋጋህን ፍጠር

እራስህን ከሴት ጋር አታወዳድር።

ሴቶች ክብራቸውን ይጠብቃሉ ወንዶች ደግሞ ዋጋቸውን ይፈጥራሉ። ወንዶች ለሚሆኑት ማንነት እና ለሚያቀርቡት ነገር ብቻ ነው የሚገመቱት። እራሱን፣ ቤተሰቡን፣ ማህበረሰቡን መደገፍ እና ማኖር የማይችል እና ሲቦዝን የሚውል ወንድ በየትኛውም ማህበረሰብ ዋጋ አይሰጠውም። ለዚህም ነው ተመሳሳይ እድሜ ቢኖሯቸውም ሴት ከወንድ የበለጠ ዋጋ በማህበረሰቡ ይሰጣታል። ምክንያቱም እሷ በማህበረሰቡ ዋጋ የሚሰጠው ክብር ወይም ድንግልና አላት። ወንድ ልጅ ግን ማንነቱን፣ ፈጣሪዉን፣ አላማውን ማወቅ እንዲሁም ህይወቱን ገና መፍጠር እና እራሱን መቻል እና ማስተዳደር አለበት።

እየገለፅኩት ያለው ሀሳብ ወንድ ልጅ ውጤታማ ለመሆን እና እሩቅ ለመጓዝ ሊከተለው የሚገባ አስተሳሰብ ነው። ሴት ልጅ ዋጋዋ የሚለካው በክብሯ፣ ውበቷ እንድሜዋ ነው። ለምን ካላችሁ ወንድ ልጅ ሴትን ልጅ ሲመለከት እና ሲመርጥ ፈጣሪ በልብ ያሳደረው ሀሳብ ልጅ ለመውለድ እና እራሱን ለመተካት ነው። ስለዚህ ወጣት፣ ጤናማ የሆነች፣ ውብ ሰውነት፣ ለስላሳ ቆዳ ያላትን ሊመርጥ ይችላል።

ሴት ልጅ ሲፈጥራት ደግሞ ለደህንነት ቅድሚያ ትሰጣለች። ስለዚህ ጠንካራ፣ ተግባቢ የሆነ፣ አለማ እና ምክንያት ያለው፣ ፈጣሪውን የሚያውቅ፣ የሚማርክ ድምፅ ያለው እና ስኬታማ የሆነ ውንድን ይመርጣሉ።

በዚህ የወንድ እና የሴት መሰረታዊ ፍላጎት መሰረት ወንድ መሆን አለበት። ይሄን ለማድረግ እና ዋጋውን ለመፍጠር ደግሞ ወንድ ልጅ አሁን ባለንበት ዘመን በአማካኝ እስከ ሰላሳ አምስት አመቱ ድረስ ሊቆይ ይችላል። ማለትም ቢያንስ ከሀያ አምስት አመቱ እስከ ሰላሳ አምስት አመቱ ድረስ እራሱን፣ ፈጣሪውን፣ አላማውን ማወቅ እንዲሁም በገሀዱ አለም የሚከበር

ማንነት እና የማይካድ ስኬት መርገጥ አለበት። ይሄን ማድረግ የሚችል ወንድ በኋላ ከብዙ ውጣ ወረድ እና ፈተና በኋላ ብዙ የሴት ምርጫ ይኖረዋል። ነገር ግን ዛሬ በሀያ አምስት አመቱ ሴት ልጅን የሚያሳድድ ወንድ ከሱ በላይ እሷ ዋጋ እና ብዙ ምርጫ አላትና ፍቃደኛ ብትሆን እንኳን ለሷ ፍቅር ባርያ ነው የሚሆነው ምክንያቱም እንደፈለገቺው ካሎነ ትበራለች። ስለዚህ አብረን ዛሬ ዋጋችንን እንፍጠር።



# 3. አፍቅርት ግን በፍቅር አትውደቅ

በፍቅር ልትወድቅለት ባርያ ልትሆንለት የሚገባው ነገር ቢኖር ፈጣሪ እና እሱ ለሰጠህ አላማ ነው። በፍቅር የሚወድቅ እና በፍቅሯ የሚገዛ ወንድ በእውነቱ ደካማ ወንድ ነው። ሴት ልጅ ከምሰጠው ፍቅር፣ ስሜት እና እርካታ በላይ የሚያውቀው ነገር የለም። ይሄም ለሷ ስሜት እስረኛ ያደርገዋል። በፈጣሪ ፍቅር የወደቀ ወንድ ብዙ ሴት ልጆችን በፍቅር መጣል ይችላል። በሴት ልጅ ፍቅር የወደቀ ወንድ ግን አንዷንም ለማግኘት ይንከራተታል።

ነገር ግን ልብ ልንል እና ልናስተውል የሚገባው ለሴት ልጅ ፍቅር መውደቅ እና ሴት ልጅን ማፍቀር ያላቸውን ልዩነት ነው። ሴት ልጅን የሚጠላ ወንድ እራሱን የሚጠላ ነው። ምክንያቱም እሷ የእሱ አካል ነችና። እወቁልኝ ሴት ልጅን እወዳለሁ አፍቅራለሁም ነገር ግን በፍፁም በፍቅሯ አልወድቅም።

<u>ለሴት ልጅ ፍቅር መውደቅ ያለው መዘዝ</u>

- ምክንያትን ችላ እንድትል ያደርግሃል። ይህም በፈጣሪ እና በምክንያታዊነት ከመመራት ይልቅ ለስሜት ተገዢ እንድትሆን ያደርግሀል። በስሜት የሚመራ ወንድ ደግሞ ደካማ ነው። ወንድ ሊመራ የሚገባው በፈጣሪ እና ምክንያታዊነት ነው።

- የማይገባት ሴት ብትሆንም በፍቅሯ ወድቀህልና ብዙ መስዋዕትነት ታደርጋለህ። ይህ ድክመትን ያሳያል ምክነያቱም ልትመራ የሚገባው በፈጣሪ መንፈሳዊ ሀይል እንጂ በስጋዊ ስሜት አይደለምና። መሰዋእትነት ልትከፍል የሚገባው ለፈጣሪ እና ፈጣሪ ለሰጠህ አላማ ነው።

- ለፍቅሯ መውደቅ የመታለል ወይም በእሷ መጠቀሚያ የመሆን እድልን ይጨምራል። ምክንያቱም በፍቅር  የወደቀ ወንድ ሴት ልጅን ስነስርዓት የማስያዝ ውስጣዊ አቅም የለውም። ስተት ስሰራ ቢያይም ትክክል ባትሆንም እሷን በጭፍን ይቀበላል። ሙሉ ታደርገኛለች ብሎ ስለሚያምን እሷን ማጣት በፍፁም አይፈልግም።

- ''ፍቅር እውር ነው'' የሚል የተሳሳተ አመለካከትን መቀበል ሌላው መዘዝ የሚያመጣ ጉዳይ ነው። ፍቅር ፈጣሪ ነው። ፈጣሪ ሁሉን የሚያይ አይን ነው። ፈጣሪ ብርሀን ነው። ስለዚህ እሱን እና የሰጠህን አላማ የምትከተል ከሆነ ከገደል አይጥልህም። በጭፍን በፍቅሯ ከወደክ እና ለሷ ፍቅር ባርያ ከሆንክ እንደ አዳም አለማዊ እና ሞች ትሆናለህ።



- እና ወዘተ

## 4. እሷን ማጣት በፍጹም አትፍራ

እሷን ማጣት የሚፈራ ወንድ አሁንም እለዋለሁ በድጋሜ ደካማ ወንድ ነው። እሷ ካንተ ዘንድ ሆነችም አልሆነች ውስጥህን ልትሞላው የሚገባው በራስህ እና በፈጣሪ ፍቅር ነው። ፈጣሪን የምታስቀድም እና የምታፈቅር ከሆነ ደግሞ የፍርሀት ስሜት ቢኖርህ እንኳን በፍርሀት አትገዛም። ብታፈቅራትም መተው ካለብህ በልበ ሙሉነት እሷን ለመተው ዝግጁ መሆን አለብህ።

ወንድ ልጅ ፈጣሪው እንዳያገለው ሊሰጋ እንጂ የሴት ልጅን ፍቅር አጣለው ብሎ መፍራት የለበትም። ፈጣሪን አስቀድመህ ለብዙ አመታት መሰዋእትነት በመክፈል ፈጣሪን ካገለገልክ ከሷ በውበት የተሻሉ፣ ወጣት የሆኑ፣ ፈጣሪን የሚያከብሩ እና ጤነኛ የሆኑ ሴት ልጆችን የማግኘት እድልህ ሰፊ ነው።

ነገር ግን መጀመርያ መሆን አለብህ። ያን ታላቁ መንፈሳዊ አንተ መሆን ከጀመርክ እና ከሆንክ እንዳንተ አይነቱን ወንድ ማግኘቷ በእሷ አይን እድል ሆኖ አንተን ማጣት ልትፈራ ይገባል። ምክንያቱም ከፈጣሪ ዘንድ የምትጓዝ ከሆነ ነገህ ብርሀን ነውና ጭለማው አለም ስጋት ይፈጥርባታል ካንተም መጠለል ትሻለች።

## 5. በግንኙነት ውስጥ ዋና ሚና ተጫዋች ሁን

በህግዋ አትጫወት እንዲሁም አትኑር። ምክንያቱም እንኳን አንተን ልትመራ ለራሷ ምን እንደምፈልግ ጠንቅቃ አታውቅምና። በፍቅር ግንኙነት ውስጥ ገብቼ አላውቅም መግባትም አልፈልግም። የአሁኑ ጊዚዬ የመሆን እና የመፍጠር ነው። ለሷ የሚሰጥ ጊዜ፣ ጉልበት፣ ሀሳብ፣ እንዲሁም ስሙኒ ገንዘብ የለኝም።

ነገር ግን ጥቂትም ቢሆኑ የኔ መሆን የሚመኙ እና ያንተ ሴት ልሁን የሚሉኝ አሉ። ቀደም ብዬ እንደገለፅኩት ሁልጊዜ የማስቀድመው ፈጣሪዬን፣ አላማዬን እና እኔን ነው። ላገኛቸው ፍቃደኛ ብሆንም እንኳን በእኔ ፍቃድ እና ምርጫ ነው። እሷ ቀድማ ከተጠቀችህ አንተ ሰፊ እድል ይኖርሀል። በግንኙነት ውስጥም ዋናውን ቦታ ትይዛለህ። ካሎነ ግን ለሷ ስሜት ባርያ ትሆናለህ።

በአጭሩ እሷ የኔ ህይወት ውስጥ ነው ልትገባ የሚገባው እንጂ እኔ በእርሷ ህይወት ውስጥ አይደለም። እሷ ከኔ ጋር በመሆኗ የምታገኘው ነገር በእጅጉ ከሷ ከማገኘው ይልቃል። ታዲያ ለምን ግንኙነት ውስጥ ከገባውም አይቀር ዋንኛውን ሚና አልጫወትም። በፈጣሪ ቃልም መሰረት የእሷ አለቃ አንተ የአንተ አለቃ ደግሞ ፈጣሪህ መሆን አለበት።

# 6. በወሲብ ወቅት ዋና ሚና ተጫዋች ሁን

ዝርዝር መረጃ የሚያስፈልገው አይመስለኝም። ነገር ግን በአጭሩ ወንድ መሆንህን ማወቅ እና ስለ ሰውነቷ አሰራር ጠንቅቀህ እንደምታውቅ ገና ስታይህ ማወቅ አለበት። በወሲብ ጊዜም ያን ቢያንስ ማረጋገጥ ከተቻለም ከጠበቀቺው በላይ ሆነህ ልትገኝ ይገባል። እውነት ለመናገር በዚህ ጉዳይ ልምድ አለኝ ማለት አልፈልግም። ምክንያቱም አንደኛ ሴት ልጅ ገና አይታኝ ፍላጎት ካላሳየቺኝ መቅረብ እና ጊዜዬን ማባከን በፍፁም አልፈልግም። ሁለተኛ ደግሞ እንደ ብዙሀኑ ውንድ ስለሰጠችኝ ብቻ አልቀበልም። ወደ ክፍላችን ስንመለስ ከኔ ጋር ሴት ልጅ ከሆነች ገና ሳልቀርባት በወሲብ ጊዜ ማድረግ የምፈልገውን ጠንቅቄ አውቃለሁ። አንተም ማወቅ አለብህ። እንደ ለማጅ አሽከርካሪ ዝቅ ብለህ ፍሬን የምትፈልግ እንዳቶን አደራ።



## 7. ከስሜቷ ጋር ተገናኝ

በፍቅር መውደቅ ያለብህ አንተ ሳትሆን እሷ ነች። ይህን ማድረግ ከፈለክ ደግሞ ስሜቶቿን ልታውቅ፣ ልትፈታ፣ ልለይ፣ ልትረዳ ይገባል። ከቻልክ ከሷ በላይ ስሜቷን ተረዳ። እሷም ከሷ በላይ ታፈቅርሀለች። ሴት ነችና ማንነቷ የተመሰረተው ስሜቷ ላይ ነው። ስለዚህ የሰሜቶቿን መሰረት መርምር። ይህንም የምታደርገው ትላንቷን በማጥናት እና ዛሬዋን በማጤን ነገዋን በመገመት ነው። የምትፈልገውን ስሜት በውስጧ በመፍጠር የሷንም ልምድ ተካፈል።

ስጦታ ይሁን አላውቅም አሁን የምታደርገው ድርጊት በኋላ የሚፈጥርባትን ውስጣዊ ስሜት ከሷ አስቀድሜ አውቃለሁ። በዚህም ምክንያት በኋላ እውነት የሚሆኑ ብዙ ማድረግ እና መቀየር የሚገባትን ባህሪዎች ንግራታለሁ። አንዳንዴ ፍቃደኛ ሳትሆን ትቀራለች በዚህም ምክንያት ትምህርቶቿን ትወስዳለች። ብዙሀኑ ወንድ ወሲብን ከሴት ስላገኘ የሚፈቀር ይመስለዋል። ነገር ግን በወሲብ ጊዜ የምታስበው አንተን ሳይሆን በልቧ ጥልቅ ስሜትን የፈጠርኩት እና እምቢ ያልኳት እኔን ይሆናል። በአካል ደረጃ እራሷን ሰታ የምትረሳው ወንድ የጉድ ነው። በልቧ እስከ እለተ ሞቷ የምታስበው ወንድ ግን ብዙ ጊዜ አንድ ነው። ስለዚህ ከብዙሀኑ ወንድ ለመለየት ከውስጣዊ የስሜት አለሟ ጋር ተገናኝ።

ልብ ልንል የሚገባው ይሄን የምናደርገው ለምናፈቅራቸው ሴቶች ብቻ ነው። ምክንያቱም ከእያንዳንዱ ሴት ጋር በስሜት የምገናኝበትን ጊዜ የለንም። እውነተኛ ማንነታችንንም የምንገልጠው የሚገባቸው ከሆነ ብቻ ነው። በመጨረሻም አዳምጣት።

# 8. በእሷ አይን የማትገመት ሁን

ሁሌ በምታገኝህ ጊዜ ስለ አንተ የማታውቀው ቢያንስ አንድ አዲስ ነገር መኖር አለበት። ይሄን ማድረግ ከቻልክ ነገ አንተን ለማግኘት እና የሆነ አዲስ ነገር ስለአንተ ለመማር በውስጧ የጉጉት ስሜት እንዲፈጠር ያደርጋል። ይህም ቀኑን ሙሉ በአካል ከሌላ ወንድ ጋር ብትውልም ሀሳቧ ስላንተ ይሆናል። የሚታወቅ እና የሚተነበይ ወንድ ለሴት ልጅ ጓደኛ ከመሆን አይዘልቅም በውስጧም ጥልቅ የፍቅር ስሜት አይፈጥርም። ወንድ ልጅ የሚያስቀድመው ፈጣሪውን እና አላማውን ከሆን በየጊዜ በውስጡ የሚጨምረው ሀሳብ አለ። ይህም እሷ ለኛ ያላትን የማወቅ ጉጉት ከጊዜ ወደ ጊዜ እየጨመረ እንዲሄድ ያደርጋል።

አብዛኛው ወንድ እንደሚያደርገው ሙሉ ማንነትህ አትንገራት። እራሷ ፈልጋ ታግኝ። እውነት ለመናገር እንደምዘፍን፣ እንደምፅፍ፣ እንደምስል፣ እንደምደንስ እና ወዘተ ሴት ልጅ ካወከች ለኔ ፍላጎት እና የማወቅ ጉጉት ያድርባታል። ነገር ግን አብዛኛው ሴት አያውቀኝም። እናቴም ሁሌ አዲስ ነገር ስለኔ ታውቃለች። ቤተሰቦቼም ብዙ ስለኔ የማያውቁት ነገር እንዳለ አልጠራጠርም። በአጭሩ ከፈጣሪ በቀር በማንም የማትገመት ሁን።

# 9. ከጣርያ ያለፈ በራስ መተማመን ይኑርህ

በራስ መተማመን ኖሮት የተወለደ ማንም የለም። በየቀኑ ልንጥርለት የሚገባ ወሳኝ ባህሪ ነው። እራሱን፣ ፈጣሪውን እና አላማውን ያወቀ ወንድ በራስ መተማመኑ በሌሎች አይን ጎልቶ የሚታይ ነው። ስለዚህ እያንዳንዱ ወንድ አስቀድሞ ይሄን ማድረግ የግድ ይለዋለ።

ፈጣሪውን እና አላማውን ያወቀ ወንድ ዋጋውን የሚለካው በውስጡ ባለው ፈጣሪ እና በውስጡ በፈጠረው ገፀባህርይ ነው። ዛሬ ያለንበት ቦታ መከራ፣ ስቃይ እና ፈተና ቢበዛውም አሁን እየፈጠርን እና እየሆን ያለው ማንነት የፈጣሪ እገዛ ተጨምሮበት ካልንበት ማጥ እንደሚያወጣን መጠራጠር የለብንም።

ስለዚህ ውጫዊ አለም ዋጋህን በገንዘብ፣ በንብረት፣ በሴት፣ በሀይል እና በተለያዩ አለማዊ በሆኑ ነገሮች ሊለካ ይችላል። ነገር ግን ወንድ ልጅ እራሱን መለካት ያለበት በውስጣዊ የፈጣሪ ሀይል እና እርቃናውን በሆነ ማንነቱ ነው። ሌላው በሙሉ ተጨማሪ መሆን አለበት። ይሄን ስታደርግ እርግጥ ባሎንከባቸው ጊዜያት እንኳን እምነትህን በፈጣሪ ዘንድ ማድረግህ በራስ መተማመንህን በቋሚነት የሚኖር ያደርገዋል።

# 10. ስሜትህን ከሷ ማዕበል ጠብቅ

ሴት ልጅ ውስጣዊ የስሜት አለምህን እንድትረብሽ በፍፁም አትፍቀድ። ለሴት ልጅ ስሜቶቿ በሰአቱ እውነት መስለው እና ትልቅ የህይወት ጉዳይ መስለው የሚታያት ሲሆን የሷ ስሜታዊ መሆን የአንተን ውስጣዊ ውቅያኖስ እንኳን ልቀይር ቀርቶ ሊፈተን አይገባም።

አብረህ እንደሷ ያለምክንያት ስሜታዊ የምትሆን ከሆነ እሷም ላንተ ያላት ክብር ይወርዳል። ምክንያቱም ሴት ልጅ የምትፈልገው የራሱንም ሆነ የራሷን ስሜት መረዳት፣ መቆጣጠር እና መምራት የሚችለውን ስለሆነ።

የሆነው ነገር እውነት ሆኖ ሳለ ለስሜቷ ስትል ማድረግ የነበረብህን የምትቀየር ከሆነ ሴት ልጅ ባህሪዋ ነውና የተለያዩ እውነት ያልሆኑ ድራማዎችን በአንተ ላይ በመፍጠር እና ስሜታዊ በመሆን የአንተን ምክንያታዊነት ለጥቅሟ እና ፍላጎቶቿ በማዋል ሊትቆጣጠርህ ትችላለች። ስለዚህ የሷ ስሜት በፍፁም ሊረብሽህ አይገባም።



# 11. የሚፈልጉህን ሴቶች ምረጥ

እራስህን፣ ፈጣሪህን እና አላማህን አውቀህ እየሆንክ እና እየፈጠርክ ከሆነ ላንተ ከመጀመርያው ፍላጎት ያሌላትን ሴት ፍቅር ለማስያዝ መውጣት፣ መውረድ እና መጣር ከንቱ ልፋት ነው። ምክንያቱም ሴት ልጅ እንድታፈቅርህ በሀሳብህ ማሸነፍ ስለማትችል ነው። ላንተ ስሜት ካሌላት መጥፎ ነገር ሳይሆን መልካም ነው። ምክንያቱም መጣር ያለብህ የፈጣሪን ልብ እንጂ የሷን ልብ ለማሸነፍ ስላልሆነ።

ሴት ልጅ ፍቅር ላንተ ካላት ገና እንዳየችህ በውስጧ የፈላጎት ስሜት ሊፈጠር፣ አንተን ለማወቅ ሊትመኝ እና ልትመርጥህ ይገባል። ይሄን ሴት አድርጋለህ የምታውቅ ከሆነ ፍቅር እንድሰጥህ ብለህ ጉልበትህ፣ ጊዜህን፣ ሀሳብህን እና ወዘተ ካፈሰስከባት ሴት ፍቅር በምን ያህል እንደሚልቅ ልነግርህ አልችልም።

ወንድ ልጅ ለሴት ልጅ ደረጃ ነው ሊኖረው የሚገባው እንጂ እንደ ሴት ልጅ ስሜት አይደለም። የምፈልገውን አይነት ሴት ጠንቅቄ አውቃለሁ። ከፈለኩትም አይነት ሴት ፍቅር እንዲይዘኝ መፍቀድ እና መከልከል እችላለሁ። ስለዚህ በቃሏ ልትነግርህ ስለማትችል ፈላጎት የምታሳይህን ሴት ምረጥ። የማታሳይህን ለአሁን ብቻ ሳይሆን ለዘላለም ተዋት እንዲሁም ራቃት።

## 12. ወሊድ መቆጣጠሪያ ተጠቀም

በግብረስጋ ግንኙነት ወቅት ሁል ጊዜ ኮንዶም ተጠቀም፡፡ የፈለገ መድህኒት እወስዳለሁ ወይም የወሊድ መቆጣጠሪያ እጠቀማለሁ ብትልህ አትመናት፡፡ ምክንያቱም እንደአንተ አይነት ውንድ የማግኘት እድሏ አናሳ መሆኑን ከተረዳች ሆን ብላ ልታረግዝ ትችላለች፡፡ ያልታቀደ እርግዝና እና ልጅ ደግሞ ፈጣሪ ከሰጠን አለም ሊያዘናገን የመቻሉ እድል ከፍተኛ ነው፡፡ ልጅ የፈጣሪ ፀጋ ነው፡፡ ነገር ግን የአንተ ልጅ ከማይገባት ሴት ልጅ መውለድ የሀያ አመት እስር ነው፡፡ ስለዚህ ልጅ ለመውልድ ካላሰብክ ያለ ኮንዶም ግብረስጋ ግንኙነት ማድረግህ ይቅርብህ ምክንያቱም እሷ ከምሰጥህ ጊዜያዊ እርካታ የፈጣሪ ዘላለማዊ ህይወት ይልቃልና፡፡



# 13. አታውቃትም

አታውቃትም ምክንያቱም ከአንተ ጋር ስትሆን የፈለገቹውን ገፀባህርይ ልትላበስ ስለምትችል ነው፡፡ ካንተ ጋር የምተከራከር ሴት ልጅ ከኔ ዘንድ ስነስርአት ሊኖራት ይችላል፡፡ ካንተ ጋር ነጠላ በትከሻዋ ጥላ የምትሄድ ሴት ልጅ ከኔ ጋር ልቅ ልትሆን ትችላለች፡፡ ካነተ ጋር የሆነች የምትመስልህ ልጅ ሀሳቧ እኔ ልሆን እችላለሁ፡፡ ስለዚህ የምታሳይህ ባህሪ አንተ ላይ ይወሰናል ማለት ነው፡፡ ከቻልክ ልጅነቷን ከውስጧ ለማውጣት ሞክር እመነኝ መጀመርያ ነኝ ካለችህ እና ካሳየችህ ነገር አብዛኛው ተቃራኒ ነው፡፡ የተቀበረ ልጅነቷን ከውስጧ ለማውጣት መጀመርያ ልትፈልግህ እና አንተን ታማኝ አድርጋ ልታስብ ብቻ ሳይሆን በጥልቀት ሊሰማት ይገባል፡፡ ከዛ ቀስ በቀስ ነገሮች ይገለጣሉ፡፡



# 14. ከአንድ በላይ አጋሮች ይኑርህ

እንደኔ ፍላጓት ካለህ ከአንድ በላይ አጋሮች እንዲኖርህ ለራስህ መፍቀድ ትችላለህ። አንድ ይበቃኛል የምትል ከሆነ ይሄ የግል ምርጫ ነው። ይህ ምርጫ ግን በሴት ልጆች ጀርባ የሚደረግ ድብቅ እና ስውር ጉዳይ አይደለም። እያንዳንድ አጋሮችህ አስቀድመው ምርጫህን ጠንቅቀው ማወቅ አለባቸው። እኔ በግሌ የምሰጣቸው ቃል ስላሌለ የምሰብረውም አይኖርም። አስቀድሜ እንደተናገርኩት የፍቅር ግንኙነት ኖሮኝ አያውቅም እንዲኖረኝም ለጊዜው አልፈልግም። ምክንያቱም እየሆንኩ እና እየፈጠርኩ ነውና። ነገር ግን ፈላጎት ያላቸው ሴቶች ሲያጋጥሙኝ ግልፅ በመሆን ሀሳቤን አጋራቸዋለሁ። ከሆነ ይሆናል ፍቃደኛ ከላልሆኑም ይቀራል። የማጣው ስሙኒ የለም ሙሉ የሚያደርገኝ የፈጣሪ እንጂ የሴት ልጅ ፍቅር ስላልሆነ።

አደራ ይሄን ለማድረግ የግድ ከአብዛኛው ወንድ ልጅ የላቀ ውስጣዊም ሆነ ውጫዊ የስኬት ደረጃ መድረስ ቅድሚያ ያስፈልጋል። ስለዚህ ወንድ ልጅ ሆኖ መገኘት አለበት። ሴት ልጅ ናት።

# 15. ቀጥተኛ መሆን

በቀላል አገላለፅ ለሷ ያለህን ሀሳብ፣ አመለካከት፣ ስሜት፣ እምነት እና ፍቅር በራስ መተማመን በተሞላበት መንፈስ ፍለፊቷ ልትገልፅላት ይገባል።



# 16. ሴቶች የወንድ ጓደኛ መሆን አይችሉም

የሴት ጓደኛ ኖሮኝ አያውቅም እንዲኖረኝም አልፈልግም። ምክንያቱም በውስጤ ካለው የውንድ እሳት ሀይል ጋር መመጣጠን ስለማትችል ነው። ከሴት ጋር የሚውል ወንድ ቀኑን ሙሉ ሰለፈጣሪው እና ስለአላማው እንደማያስብ እና እንደማይሰራ እርግጠኛ ነኝ። እኔ በበኩሌ ስሰራ እንኳን ሴት ልጅን አጠገቤ ማየት ቀርቶ ስለ ሴት ልጅ ማሰብ አልፈልግም። እኔ የማስበው ከራሴ አልፌ ለቤተሰቤ፣ ለሀገሬ፣ ለአህጉሬ እና ለአጠቃላይ ፍጥረት አለም ሲሆን እሷ የምታስበው ስለራሷ አለማዊ ፍላጓት ነው። ለምሳሌ ሁል ጊዜ መርጣ እና ወደ የገዛችው ነገር ቤት ከገባች በኋላ እዳልተመቻት የምታስበው። ለዚህ ነው አብሮኝ የሚውል ጓደኛ ካለኝ እንኳን አብሮኝ ሊሞት እንዲሁም ሊገል ዝግጁ መሆን አለበት። ትላንትን፣ ዛሬን እና ነገን ብቻ ሳይሆን ማሰብ ያለበት ለዛሬ አስር፣ መቶ፣ እና ሺ አመት ነው። የሴት ልጅ ጓደኛ ደግሞ ይሄን ማድረግ ይሳናታል።

ሀሳባችን ሊሆን የሚገባው የመኖር እና የመሞት ጉዳይ እንጂ ከሴት ጋር ቁጭ ብዬ ሰውን ማማት፣ ለማህበራዊ ሚዲያ ቦታ መስጠት፣ ስለ ልብስ፣ ጫማ፣ ፀጉር መጨነቅ አይደለም። ስለዚህ የሴት ጓደኛ አይኖሩህ። ከቻልክ ጠንካራ የወንድ ጓደኞችን አግኝ ካላገኘህ ብቻህን ተጓዝ። ምክንያቱም እንዳንተ ብቻቸውን እየተጓዙ ያሉ ኋላ የምታገኛቸው ጠንካራ የወንድ ጓደኞች ስለሚኖሩ።

አብዛኛው ወንድ የሴት ጓደኛን የሚመርጠው ጓደኝነቷን ፈልጎ ሳይሆን ሌላ ጉዳይ ይዞ ነው። ይህ ደግሞ የደካማ ወንድ መንገድ ነው። ወንድ ፍላጎቱን ቀጥተኛ በሆነ መንገድ መግለፅ አለበት።

## የተወሰኑ ተያያዥ ተፅዕኖዎች

- ከሴት ጋር ስትውል የሴት ባህሪ ትላበሳለህ
- ሁሉም ሰው አንድ ላይ እንደሆንክ ያስባል
- ምንም እንኳን ከእርሷ ጋር ወሲብ ባትፈጽምም ሰዉ ግን ያስባል
- የወንድ ጓደኛ ወይም የፍቅር አጋር ካላት በእሷ ትቀናለህ
- ወንድ መሆንህን ትረሳዋለች (የማፈልገውን ነገር እንድታደርግ ታደርግሃለች)
- ችግር ውስጥ ትከታህለች ለምሳሌ ግጭት
- ካንተ ጋር በመሆኖ ነፃ ነገሮች ታገኛለች ወይም ትከፍልላታለህ
- በስሜታዊነት ደካማ ትሆናለህ
- እሷን ለማስደሰት ተጨማሪ ጊዜ ታጠፋለህ
- ለእሷ ደስታ የራስህን መስዋእት ትሰጣለህ
- እና ወዘተ

## 17. ሴት ካሌለህ ችግር የለውም

ሌላው ትላንትም ሆነ ዛሬ ከሴት ልጅ ጋር ግንኙነት ኖሮህ የማያውቅ ከሆነ ምንም ችግር የለውም መልካም ነው እያልኩህ ነው። በፍፁም ኋላ የቀረህ እንዳይመስልህ። የፈለገ ውበት ባይኖርህ፣ ቁመትህ ቢያጥር እና ወዘተ አካላዊ ድክመቶች ቢኖሩክ እንኳን ፈጣሪህን እና አላማህን አስቀድመህ ዛሬ በሰዋትነት ከከፈልክ እና ከሰራህ ነገ ብዙ ምርጫ ይኖርሀል። አላማችን በሴት ልጅ ሳይሆን በፈጣሪ መመረጥ ነው። ዛሬ ወዳንተ ስላልዞረች ነገም ወደ አንተ መምጣቷ አይቀርምና ለሷ አሉታዊ ስሜት አይኑርህ። ይህ ባህሪዋ ነው ተቀበል።



# ያገኘህውን

# ትምህርት




# እንጂ

# ስህተቴን

# አትቁጠር።



ኤጳጉሜን
(ኔቶ)

ማንም ባይጓዘውም በራሱ መንገድ የሚጓዝ በእውነቱ ወንድ ነው። ለአለም ሳይሆን ለውስጣዊ ፈጣሪ የሚገዛ በእውነቱ ወንድ ነው። ሰውን ሳይሆን ፈጣሪውን ለማስደሰት የሚጥር በእውነቱ ወንድ ነው። ከራሱ አቅም በላይ በፈጣሪው ሀይል የሚመካ በእውነቱ ወንድ ነው። ከገንዘብ፣ ከስልጣን እና ከሴት ልጅ ፈጣሪውን የሚያስቀድም በእውነቱ ወንድ ነው። የሰውን ልጅ ሳይሆን ፈጣሪውን ለመምሰል የሚጥር በእውነቱ ወንድ ነው።

**ታዲያ አንተ ወንድ ነህ?**



